# የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ
# ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን እምነት ፣
# ሥርዓተ አምልኮትና የውጭ ግንኙነት



ይህ የእምነትና ሥርዓት መጽሐፍ ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ቀዳማዊ ፣ ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ የቤተ ክርስቲያንን ዕድገት ለማፋጠን ባላቸው ጽኑ ምኞት ፤ ባሳዩት ጥረትና በሰጡት መመሪያ መሠረት ተዘጋጅቶ ፣ ለሁለተኛ ጊዜ ታተመ ።


<u>አሳታሚ</u>፦ ትንሣኤ ማሳተሚያ ድርጅት
**PUBLISHER:– TENSAE PUBLIHSING HOUSE**

**አዲስ አበባ ሐምሌ 1988 ዓ·ም·**
ADDIS ABABA, JULY 1996



ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ቀዳማዊ ፡
ፓትርያርክ፣ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ
His Holiness Abune Paulos I
Patriarch of the Ethiopian Orthodox Tewahedo Church.

# አዘጋጆች

1· ብፁዕ አቡነ መቃርዮስ የአክሱምና የመላዋ ትግራይ
ሀገረ ስብከት ሊቀ ጳጳስ ................................. ሰብሳቢ

2· ብፁዕ አቡነ አብርሃም ሊቀ ጳጳስ የስብከተ ወንጌልና
ሐዋርያዊ ተልእኮ መምሪያ የበላይ ኃላፊ ................. አባል

3· ብፁዕ አቡነ ናትናኤል የአርሲ ሀገረ ስብከት
ሊቀ ጳጳስ ................................................. »

4· ብፁዕ አቡነ በርተሎሜዎስ የሲዳሞና
የቦረና አህጉረ ስብከት ሊቀ ጳጳስ ......................... »

5· ብፁዕ አቡነ ሳሙኤል የጂማ ሀገረ ስብከት ሊቀ ጳጳስ .. »

6· ብፁዕ አቡነ ገብርኤል የውጭ ጉዳይና የሕዝብ
ግንኙነት የበላይ ኃላፊ እና የምዕራብ ሸዋ
ሀገረ ስብከት ሊቀ ጳጳስ ................................. »

7· ብፁዕ አቡነ ገሪማ ሊቀ ጳጳስ የቅ/ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ
የጠቅላይ ቤተክህነት ዋና ሥራ አስኪያጅና
የቅ/ሥላሴ/መ/ኮሌጅ ዲን ................................. »

8· መልአከ ታቦር ተሾመ ዘሪሁን በአውስትራሊያ
የኢ·ኦ·ተ· ቤተ ክርስቲያን ኃላፊ ......................... »

9· ሊቀ ካህናት ክንፈ ገብርኤል አልታየ የቅ/ጳውሎስ
ከ/መንፈሳዊ ት/ቤት ም/ዲን ................................ »

10· መልአከ ሰላም ዳኛቸው ካሣሁን የስብከተ ወንጌልና
ሐዋርያዊ ተልእኮ መምሪያ ኃላፊ ......................... »

11· መጋቤ ብሉይ ሰይፈ ሥላሴ ዮሐንስ የቅ/ጳውሎስ
ከ/መንፈሳዊ ት/ቤት መምህር ................................ »

12· ሊቀ ካህናት ብርሃኑ ገብረ አማኑኤል የትንሣኤ
ማሳተሚያ ድርጅት ኃላፊ .................................... »

13· መጋቤ ብርሃናት ጎሐጽባሕ ጥሩነህ በቅ/ሥላሴ
መንፈሳዊ ኮሌጅ የሐዲሳት ትርጓሜ መምህር ............ »

14· መሪጌታ ደጉ ዓለም የመንበረ ፓትርያርክ ቅ/ቅ/ማርያም
ቤ/ክ/ የመጻሕፍተ ሐዲሳት መምህር ...................... »

15· መጋቢ ምሥጢር ወልደ ሩፋኤል ፈታሒ
የዜና ቤተክርስቲያን ጋዜጣ ዋና አዘጋጅ .................. »

16· መሪጌታ ጽጌ ዘሪሁን ከትምህርትና
ማሠልጠኛ መምሪያ ............................................ »

17· ሊቀ ሥዩማን ራደ አስረስ ከሊቃውንት ጉባኤ ........... »

18· መመህር ሀ/ማርያም ተድላ » » ............... »

ከላይ በተገለጹት አባላት ከተዘጋጀ በኋላ፣

1· መምህር ገብረ ሕይወት የደብረ ጽጌ ቅ/ማርያም ገዳም የሐዲሳት ትርጓሜ መምህር

2· መልአከ ገነት ገብረ ሥላሴ አወቀ በሰዋስወ ብርሃን ቅ/ጳውሎስ ከ/መንፈሳዊ ት/ቤት የብሉያት ትርጓሜ መምህር

3· መምህር ስብሐት ገብረ እግዚአብሔር በሰዋስወ ብርሃን ቅ/ጳውሎስ ከ/መንፈሳዊ ት/ቤት የመጽሐፍተ ሐዲሳት ትርጓሜ መምህር

4· መጋቤ ብሉይ መዘምር ታየ በቅ/ሥላሴ መንፈሳዊ ኮሌጅ የብሉያት መምህር ባሉበት ታይቷል ።

# ማውጫ

**አርእስት** **ገጽ**



## ክፍል ፩
## እምነት

## ክፍል ፪

ሥርዓተ አምልኮት ...



## ክፍል ፫

## የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን የውጭ ግንኙነት

# የብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ መልእክት

## በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አሐዱ አምላክ አሜን

የተወደዳችሁ ምእመናን!

ቀደምት ቅዱሳን አበው ልባቸው በእግዚአብሔር ፍቅር የነደደ ስለነበር እንደ መላእክት ዘወትር ፈጣሪያቸውን ቅዱስ ፣ ቅዱስ ፣ ቅዱስ ፣ እያሉ ያመሰግኑ ነበር ። ከአምላክ በተሰጣቸው ጸጋ መጻሕፍትን ሲያመሠጥሩ ፣ ብሉያት ሐዲሳትን ሲተረጉሙና ሲያስተምሩ ኖረዋል ። ከቶውንም እግዚአብሔር አምላካቸውን በሰቂለ ኅሊና ፣ በነቂሀ ልቡና ጥዋት ማታ ማመስገን የዘወትር ተግባራቸው ነበር ። በፍጹም ልብ ፣ በፍጹም ሀሳብ ፣ በፍጹም ነፍስ ቅዱስ ኃያል ፈጣሪያቸውን በጽኑ ከማመናቸውና ከመውደዳቸው የተነሣ ሀብታተ ምሥጢራት እየተሰ ጧቸው ቅዱሳት መጻሕፍትን በጥልቀት አብራርተዋል ፣ ተርጉመዋል ፣ በምሥጢር ተራቀቀዋል ፣ አያሌ ተሩፋትንም ፈጽመዋል ። ከአባቶች ሐዋርያትና ከቅዱሳን ጻድቃን ሰማዕታት ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ሃይማኖት ነቀ ሳያስገቡ ትክክለኛውን እምነት፣ ሥርዓትና ትውፊት ጠብቀው አቆይተውናል ። በዚህም ሳይወሰኑ ፣ ጥንታዊት ፣ ሐዋርያዊት፣ ታሪካዊትና ብሔራዊት የሆነችውን የኢት ዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በመንፈሳዊ ተጋድሎና በበጎ ምግባር ይበልጥ አጠናክረውና አክብረው ለአሁኑ ኢትዮጵያዊ ትውልድና ለመላው ዓለም አውርሰዋል ። ልበ አምላክ ቅዱስ ዳዊት «በምድር እንደተፈተነ ሰባት ጊዜ እንደተጣራ ብር የእግዚአብሔር ቃላት የነጽ ቃላት ናቸው" (መዝ· 11፡16) እንዳለው ሁሉ የዚህች ቤተክርስቲያን አባል ለመሆን የታደለው ኢትዮጵያዊ ሁሉ በቀድስተ ቤተክርስቲያኑ ሊኮራ ይገባል ። ክርስቶ መንጭቶ ፣ አምሮና ደምቆ በዓለሙ ሁሉ ገንኖ የነበረውን ታላቁን የኢትዮጵያ ሥልጣኔ ወደ አንድ

ቢሊዮን የሚጠጋው መላው የምድራችን ጥቁር ሕዝብ ሊመራመርና ሊያውቀ ፡ ሊመካና ሊኮራም ይገባል ።

ይህም መመራመር የዕውቀት ጥማትን ለማርካት የሚደረግ ጥረት ብቻ ሳይሆን የትውልድ ግዴታና መንፈሳዊ ተልእኮም ጭምር ነው ። ይልቁንም ምእመኑ ፡ መላው ሕዝባችን እምነቱን ጠንቀቀ የማወቀ ፡ ሃይማኖቱን ከቢጽ ሐሳውያን የመከላከልና ለልጆቹም የማስተማር ኀላፊነት አለበት ። ይህ በልዩ የሊቃውንት ጉባኤ ተዘጋጅቶ በቅዱስ ሲኖዶስ ታይቶና ጸድቀ የቀረበው መጽሐፍ ዓላማው ይህ ነው ።

«ካልጠየቁ አያውቁ ፡ ካላወቁ አይጸድቁ» ነውና ምእመናን ሃይማኖታቸውን ፡ ሥርዓቱንና ትውፊቱን ሊረዱ ይገባል ። ስለ እምነ ታችን ሊያውቁ ለሚሹም የውጭ ሰዎች መጽሐፉ በእንግሊዝኛ ቋንቋ ተተርጕሞ ስለቀረበ ለማንበብ ያመቻቸዋል ። የሃይማኖታችንን ምንነት ከስረ መሠረቱ ጠንቀቀው ካለማወቀ የተነሣ የተዛባ አመለካከት ፡ ፈር የሳተ አስተያየት የሚሠነዝሩት ሁሉ በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ትክክለ ኛውን እምነት ከምንጩ ሊያገኙ ይቻላቸዋል ። በማወቅም ሆነ ባለማወቀ በስሕተትም ሆነ በድፍረት ለሚናገሩት ሰዎች አስተዋይ አእምሮ እንዲሰጣቸው እንመኛለን ።

ከዚህም ሌላ በኦሪየንታል ኦርቶዶክስና በምሥራቅ ኦርቶዶክስ አብያተ ክርስቲያናት ፡ በኦርቶዶክስ አብያተ ክርስቲያናትና በምዕራብ አብያተ ክርስቲያናት መካከል ባለው የትምህርተ ሃይማኖት ፡ ቀኖናና ሥርዓተ አምልኮት ልዩነት ላይ ውይይት ሊደረግ ይገባዋል የሚሉ ወገኖች ሁሉ የቤተ ክርስቲያናችን ጥንታዊ ትክክለኛና የማይዛባ እምነትና ሥርዓት በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የተገለጸ መሆኑን እንዲያውቁልን እንሻለን ። «… ሁሉም አንድ ይሆኑ ዘንድ …» ብሎ ጌታ እንደተናገረው ቤተክርስቲያናችን የክርስቲያኖችን ኅብረትና አንድነት በመሠረቱ የማትቃወም ብትሆንም ለዚህ ሲባል እምነትና ሥርዓተ አምልኮት እንዳይፋለስ ብርቱ ጥንቃቄ መደረግ እንዳለበት ታምናለች ።

መጽሐፉ የቤተክርስቲያኒቱን እምነት ፡ ሥርዓተ አምልኮትና የውጭ ግንኙነት በሚገባ እንዲገልጽ ታስቦ በጥንቃቄና በጥራት የተዘጋጀ ስለሆነ ጠቀሜታው ከፍ ያለ ነው ። ይህ መጽሐፍ የእምነታ ችንን አዕማድ ዋና ዋና ነጥቦችን ጠቅሎ አስፍሯል ። በረጋ አእምሮ

በተሰበሰበ ኀሊና እግዚአብሔርን አጋዥ አድርጎ ላነበበው የሃይማኖትን ሐዋርያዊ መሠረት ቁልጭ አድርጎ ያሳያል ። መንፈሳዊ በረከትንም ያድላል ። እያንዳንዱም ምእመን እምነቱን በሚገባ ተረድቶ ፣ ሃይማ ኖቱን እንዲጠብቅና እንዲከላከልም ታላቅ መሣሪያ ይሆነዋል ። ቸርነቱ የማያልቅበት ፣ በዓለሙ ምሉዕ የሆነውን የጌታችን የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስን ጸጋና በረከት ይሳተፍ ዘንድ ንጹሕ ልቡናንና ቀን መንፈስን ያሳድርበታል። በመጨረሻም ምእመናንን ደጋግሜ አደራ የምለው ፣ እምነታችን ሥርዓታችን ፣ ትውፊታችን አንገዳ ደራሽ ሳይሆን ጥንታዊና ሐዋርያዊ ፣ በጠንካራ አለት ላይ እንደተገነባው ቤት ጽኑ መሠረት ያለው ስለሆነ ይህን መጽሐፍ በማንበብ ሃይማኖታችሁን በሚገባ እንድትረዱና እንድትጠብቁ ነው ።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር
እግዚአብሔር ኢትዮጵያን ይባርክ

አባ ጳውሎስ
ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ
ታኅሣሥ 29 ቀን 1988 ዓ.ም.
አዲስ አበባ ፣ ኢትዮጵያ

# መቅድም

ኢትዮጵያ በመጽሐፍ ቅዱስም ሆነ በዓለም ሥነ ጽሑፍ የታወቀች ቢሆንም በበለጠ የምትታወቀውና በሁሉም ዓይን ጎልታ የምትታየው «የጥበብ መጀመሪያ እግዚአብሔርን መፍራት ነው» ከሚለው የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ጋር ተያይዞ በተመሠረተው የአምልኮተ እግዚአብሔር ታሪኳ ነው ። (መዝ·110፡10 ፣ ምሳ·1፡7)።

ኢትዮጵያና ኢትዮጵያውያን በቅዱሳት መጻሕፍት ፣ በጥንታውያን የታሪክ ሠነዶችና በሥነ ጥንት ጥናት በቀይ ባሕር አካባቢና በዓባይ ሸለቆ ዙሪያ ከታወቁት አህጉር ሕዝብ ጐን ተገቢ ቦታዎችን ይዘው የሚገኙ ናቸው ።

በጥንታዊ ታሪክ መነሻነት ኢትዮጵያ የሚለው ቃል በመልክዐ ምድር አቀማመጥ ከግብፅ በስተደቡብ የሚገኝ በዘርና ቀለሙ እስከ ሕንድ ውቅያኖስ የሚደርስ ቀለምንና ዘርዐ ትውልድን የሚያመለክት የአካባቢ መጠሪያ መሆኑ ይታወቃል ።

ኢትዮጵያ የሚለው ስም ከሁለት የዕርዕ ቃላት መልከ–ጠይም የሚለው ተወስዶ በዚህ አካባቢ ለሚኖረው ሕዝብ መጠሪያ ስሙ ነው ። ሀገሪቱንም ኢትዮጵያ ያሰኘው የኗሪዎቹ ደም ግባት ነው ።

ኢትዮጵያ የሚለው ክልልም በየጊዜው የመስፋትና የመጥበብ ታሪክ ያጋጠመው ቢሆንም የምድረ ኢትዮጵያ ማዕከሉ የጥቁር ዓባይ መፍለቂያ (መነሻ) መሆኑ ግልፅ ነው ።

መጽሐፍ ቅዱስ የሁሉንም ነገር አጀማመር የሚነግረን ልዩ መጽሐፍ በመሆኑ በኦሪት ዘፍጥረት ምዕራፍ 2፡13 ላይ «የሁለተኛው ወንዝ ስም ግዮን ነው ፣ እርሱም የኢትዮጵያን ምድር ሁሉ ይከባል» ይላል። ነቢየ እግዚአብሔር ዳዊትም «ኢትዮጵያ እጆቿን ወደ እግዚአ ብሔር ትዘረጋለች» ብሏል ። (መዝ· 67፡31)።

ኢትዮጵያ የሚለው ስመ ተጸውዖ በመጽሐፍ ቅድሱ በብዙ ቦታ ይገኛል። የብሉይ ኪዳን ነቢያትም ወደ ዝርዝር ጉዳይ ሳይገቡ የኢትዮጵያን ስም ይጠራሉ ።

ከልደተ ክርስቶስ በፊት በ800 ዓመት አካባቢ የነበረው ግጥም ገጣሚው ግሪካዊው ሆሜር በግሪክኛ ሥነ ጽሑፍ ስለ ኢትዮጵያውያንና ስለሚኖሩበትም አካባቢ ገልጾአል ።

ከሆሜር በኋላ ከልደተ ክርስቶስ በፊት ከ400–300 ዓመት የነበረው የታወቀው ታሪክ ጸሐፊ ሄሮዶቱስም በመጽሐፉ ኢትዮጵያውያን የሚኖሩበት ከግብፅ ደቡብ መለስ የሚገኝና ቀይ ባሕርንም ተከትሎ እስከ ሕንድ ውቅያኖስ የሚደርስ አካባቢ እንደነበርና የእነዚህንም ኢትዮጵያውያን የኑሮ ሁኔታ ሲገልጽ «የዕድሜ ባለጸጋዎች» እንደነበሩ ያመለክታል ።

እንግዲህ በዚህ ሁሉ ገጽታ ኢትዮጵያ በአፍሪካ ክፍለ ዓለም በሰሜን ምሥራቅ አፍሪካ የምትገኝ የረዥም ዘመን ታሪክ ያላት ሀገር ናት ።

ኢትዮጵያ እግዚአብሔርን ሳታውቅ የኖረችበት ጊዜ እንደሌለ ቢታወቅም ንግሥተ ሳባ በታሪክ የሰማችውን የሰሎሞንን ጥበብ ለማየትና በዘመኑ የነበረውን የሀገራችንን ሥልጣኔ ለማስተዋወቅ የብሉይ ኪዳንንም እምነትና ትምህርት ጥበብንም ከመሠረቱ ለመረዳት ወደ ኢየሩሳሌም ባደረገችው ጉዞና በተፈጠረው ግንኙነት ምክንያት የብሉይ ኪዳን እምነትና ጽላተ ሙሴ ወደ አገራችን ገብተዋል ።

ከዚያ ዘመን ጀምሮ ሀገራችን ኢትዮጵያ የብሉይ ኪዳን እምነት ትምህርትና ሥርዓት የሚፈጸምባት የጽላተ ሙሴ መንበር ሆና ትኖራለች። (1ነገሥ· 10፥1–9)

በዚህ የታሪክ የሥልጣኔና የእምነት ግንኙነት ምክንያት ኢትዮጵያ ውያን ረዥሙንና አድካሚውን የበረሃ ጉዞ በእግርና በእንስሳ ጀርባ እየተጓዙ በዳዊት ከተማ በኢየሩሳሌምና በአካባቢዋ የቦታ ባለ ይዞታ ሆነዋል ። ይህም ለኢትዮጵያውያን ብቻ ሳይሆን ለመላው ጥቁር ሕዝብ የታሪክ ኩራትና የሥልጣኔ ምልክት ሆኗል ። የክርስትናውም እምነት በዚሁ የታሪክና የሃይማኖት ግንኙነት መሠረት አምልኮተ እግዚአብ ሔርን ለመፈጸም ወደ ኢየሩሳሌም በሄደው ኢትዮጵያዊ ጃንደረባ አማካ ኝነት በ1ኛው ምእት ዓመት ወደ ሀገራችን እንደገባ በማያሻማ ሁኔታ በቅዱስ መጽሐፍ የተገለጠ ነው ። (የሐዋ· 8፥26–39)።

ነገር ግን የቤተክርስተያኒቱ ህልውና በኤጲስ ቆጶስ ተባርኮና ተቀድሶ ምሥጢራተ ቤተክርስቲያንን መፈጸም የተጀመረው በ4ኛው መቶ ዓመት ከእስክንድርያው ሊቀ ጳጳሳት ከቅዱስ አትናቴዎስ በተሾመው በቅዱስ ፍሬምናጦስ ነው ። ከእስክንድርያም ጋር የተመሠ ረተው መንፈሳዊ ግንኙነት በዚሁ ሃይማኖታዊ ታሪክ መነሻነት ነው ።

ኢትዮጵያ ከልደተ ክርስቶስ በፊት በሙሴ ሕግ ከጊዜ በኋላም ሐዲስ

ኪዳኑን በመማር በማስተማር በእነዚህ ሁለት ዓበይት ሕግጋት በቅደም ተከተል ስመ እግዚአብሔርን በመጥራት ፣ ሕገ እግዚአብሔርን በመጠበቅ አምልኮቱንም በመፈጸም ስትመራ የቆየች የሃይማኖት ሀገር ስትሆን የዕድገቷም ዓላማና አቋም በዚሁ ዓይነትና መጠን የተገነባ ሆኖ ከአንዱ ትውልድ ወደ ተከታዩ ሲወርድና ሲወራረስ መጥቶ አሁን ከአለበት ደረጃ ላይ ደርሶ ይታያል ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን የኬልቄዶንን ጉባኤ ከማይቀበሉት የኦርቶዶክስ ተዋሕዶ አብያተ ክርስቲያናት አንዷ ናት ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ፣

ሀ) ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የሠራውን ፣

ለ) ሐዋርያት ያስተማሩትን ፣

ሐ) በሦስቱ ጉባኤያት የተወሰኑትን ማለት በመንፈስ ቅዱስ አጋዥነት እየተመሩ
318 ቅዱሳን አበው በ325 ዓ·ም· በኒቅያ ፣ 150 ቅዱሳን አበው በ381 ዓ·ም· በቍስጥንጥንያ ፣
200 ቅዱሳን አበው በ431 ዓ·ም· በኤፌሶን ያስተማሩትንና የወሰኑትን ፣
ከእነዚህም ቅዱሳን አበው ትምህርትና ውሳኔ ጋር የሚተባበሩ በየጊዜው የተነሡ ቅዱሳን አበው ያስተማሩትንና የእነርሱንም የተቀደሰ ሥርዓታቸውን አምናና ተቀብላ ታስተምራለች ።
ከ4ኛው መቶ ዓመት እስከ 7ኛው መቶ ዓመት የነበረው ጊዜ እርኪ የቤተክርስቲያን ታሪክ የተፈጸመበት አንድ ወቅት ነበር።

ይህም ጊዜ ቅዱሳት መጻሕፍት ከዕርዕና ከመሳሰሉት ጥንታውያን የሥልጣኔ ቋንቋዎች ወደ ግዕዙ ብሔራዊ ቋንቋ የተተረጐሙበት ፣ ገዳማዊ ሕይወት ፣ የተመሠረተበት ፣ የቤተክርስቲያናችን የውዳሴ ፣ የቅዳሴ ፣ የዝማሬ ፣ የዜማ ስልቶች በፈቃደ እግዚአብሔር በኢትዮጵያዊው አባት በቅዱስ ያሬድ የተደረሱበት የሥነ ጽሑፍ ውበት የታየበት ወቅት ነበር ።

በ7ኛው መቶ ዓመት ሰሜን አፍሪካና በከፊል መካከለኛው ምሥራቅ በሰለሙ ዓረቦች በመወረሩና ይህም ሁኔታ ከጊዜ በኋላ በቀይ ባሕር

አካባቢ ቀይ ባሕርን ተከትሎ እስከ ሕንድ ውቅያኖስ እየሰፋ በመምጣቱ የኢትዮጵያ ቤተክርስቲያን ከክርስትናው ዓለም ጋር የነበራት ግንኙነት ተቋረጠ ።

በ9ኛው መቶ ዓመት በኢትዮጵያ የክርስትናው ታሪክ ተቃዋሚ ሆና በተነሣችው በዮዲት (በጉዲት) ቤተክርስቲያናችን ብዙ ቅርሶችን አጥታለች ። የብዙ ሰዎችም ሕይወት ጠፍቷል ።

ከ10ኛው እስከ 15ኛው ክፍለ ዘመን የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በ9ኛው መቶ ዓመት የተደመሰሰውን ታሪኳን መልሳ በማደስና በአሠራራቸውም በዓለም ተወዳዳሪ የሌላቸው አብያተ ክርስቲያናት የታነጹበት ስብከተ ወንጌል በመላ ሀገሪቱ የተስፋፋበት ገዳማዊ ሕይወት በበለጠ የታደሰበት ሥነጽሑፍ የዳበረበት አምልኮተ ባዕድ የጠፋበት ቅዱሳት መጻሕፍት ከዓረብኛ ወደ ግዕዝ ቋንቋ በብዛት የተተረጐሙበት ጊዜ ነበር ።

16ኛው ክፍለ ዘመን በኦቶማን ኢምፓየር ደጋፊነት በሀገሩ ላይ ያመፀው የውስጥ ጠላት የሆነው ግራኝ መሐመድ በቤተክርስቲያናችንና በሀገራችን ህልውና ላይ ከባድ ጉዳትን ያደረሰበት ወቅት ነበር ። ይህም ዘመን በኢትዮጵያ ታሪክ የጨለማው ዘመን በመባል የታወቀ ነው ። በዚያን ጊዜ ግራኝ መሐመድ ከምሥራቅ ኢትዮጵያ ተነሥቶ ወደ መሐል ኢትዮጵያ በመምጣት ከዚያም ወደ ሰሜን ኢትዮጵያ በማምራት በሀገሪቱ የነበረውን የክርስትና ታሪክ ደምስሶ የድጋፍ ሰጭውን የኦቶማን ኢምፓየር አገዛዝን ለመተካት ነበር ፣ ግን በጊዜው የነበረው ኢትዮጵያዊ ትውልድ በሃይማኖቱ የጸና ፣ በሥነ ምግባሩ የተዋበ ፣ በሀገር ፍቅር የነደደ በመሆኑ ያን የውስጥ ጠላት ኢብራሂም ግራኝ መሐመድን ከነሠራዊቱ በእግዚአብሔር ኃይል በመደምሰስ ድልን ተቀዳጅቷል ።

በ16ኛው ክፍለ ዘመን ግራኝ መሐመድ ያደረሰው ጥፋትና እልቂት የ15 ዓመታት የመከራ ዘመን ቢሆንም በኢትዮጵያ ታሪክ በአጥፊነቱ ተወዳዳሪ የማይገኝለት ዘመነ ሰማዕታት ነበር ።

በግራኝ መሐመድ ወረራም ወቅት በርዳታ መልክ ከመጡት የፖርቱጋል ወታደሮች ጋር ተሰባጥረው የመጡ ጀስዊት መነኮሳትም እንደነበሩ ታሪክ ያስታውሰናል ። በነዚህም መነኮሳት ምክንያት በሀገራችን ብዙ ደም ፈሷል ።

ከ18ኛው ክፍለ ዘመን አጋማሽ እስከ 19ኛው መቶ ዓመት አጋማሽ ድረስ ለአንድ መቶ ዓመት ያህል በተራዘመው ዘመነ መሳፍንት ቤተክርስቲያናችን ያጋጠማትን ፈተና ሁሉ አልፋ ፤

ሀ) የቅኔና የሰዋስው ሥነ ጽሑፍ ማእከላት የሆኑ ትምህርት ቤቶችን ፤

ለ) የትርጓሜ መጻሕፍት ጉባኤያትን ፤

ሐ) የጸዋትወ ዜማ ትምህርት ቤቶችን በማስፋፋትና በማጠናከር ርምጃዋ ሳይታጠፍ እንደገና በ19ኛው ክፍለ ዘመን አጋማሽ ላይ በአፄ ቴዎድሮስ አነሣስ የሀገሪቱ አንድነት ተጠብቆ ወደሚቀጥለው ዐረፍተ ዘመን ለመሸጋገር በቅታለች ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በማንም ሰው ዓይን መታየት ያለባት በታሪካዊነቷ ብቻ ሳይሆን በአፍሪካ ቀንድ ለእግዚአብሔር መንግሥት ጽናት የራሷ የሆነ የክርስትና ታሪክ በማቈየቷና ለሀገር አንድነትና ነጻነት በአደረገችውም መሥዋዕትነት ጭምር መሆን አለበት።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በዚህ ረጅም የታሪክ ዘመን ለሃይማኖቷ ለነጻነቷ ፤ ለሀገር ዕድገት ፤ ለኅብረተሰብ አንድነት ከፍተኛ መሥዋዕትነትን የከፈለች መሆኑ ግልጽ ነው ። ይህን ሁሉ ታሪክ ሁሉም ሰው እንዲያውቀው ማድረግም ተገቢ ነው ።

በየጊዜው የኢትዮጵያን ገጽታ ለማጥፋትም ሆነ ኢትዮጵያን ለመውረር የፈለጉና የሚፈልጉ ክፉዎች ኃይላት ሁሉ ለዓላማቸው መሳካት በመጀመሪያ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያንን መደምሰስ ወይንም በተለያየ ምክንያት ማዳከም ነበር ።

በ19ኛው ክፍለ ዘመን የአውሮፓውያንን ሥልጣኔ ወደ ኢትዮጵያ ለማስገባት ከፍተኛ ጥረት ተደርጎ ነበር ።

የአውሮፓ ኃያላን መንግሥታት ኢትዮጵያ የአፍሪካ የሥልጣኔ ማእከል እንዳትሆን በስውር ተስማምተው ተባብረው በ19ኛው ክፍለ ዘመን ፍጻሜ አካባቢ የኢጣሊያ ወረራ በኢትዮጵያ ላይ እንዲፈጸም ሆነ ። በሃያኛው ክፍለ ዘመንም ሞሶሎኒ ኢትዮጵያን በቅኝ ገዥነት ለመያዝ በተነሣ ጊዜ ለዓላማው መሳካት በኢትዮጵያ በመጀመሪያ መደምሰስ ከአለባቸው አንዷ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን

እንደነበረች ታሪክ ያስረዳናል ። ይህም ከ1928 እስከ 1933 ዓ·ም· ድረስ በተደረገው ወረራ በተግባር የታየ ነው ። ይሁን እንጂ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን የደረሰባትን ጥፋትና ጥቃት ተቋቁማና እንደገና አንሠራርታ የኢትዮጵያን ታሪክ አደራጅታ ወደ ነበረበት መልሳ ሕዝብ በማገልገል ላይ ትገኛለች ።

ሃያኛው ክፍለ ዘመን እንደ 5ኛው ፤ 11ኛውና 16ኛው ክፍለ ዘመን የመለያያ ፤ የመወጋገዣና የግጭት ሳይሆን የራስን ዓላማ ሳይለቁ ተቀራርቦ በመወያየት ለችግሩ መፍትሔ የሚሰጥበት ነው ።

በ5ኛው መቶ ዓመት «ከሁሉ በላይ የምትሆን ሐዋርያት የሰበሰቧት አንዲት ቅድስት ቤተክርስቲያን» ከሁለት መከፈል በቤተክርስቲያን ታሪክ እጅግ በጣም የሚያሳዝን ነበር ።

በመሠረቱ የእግዚአብሔር ቤተክርስቲያን አንዲት ናት ። ሰዎችም እንደየፍላጐታቸው በየጊዜው ሊከፋፍሏት አይችሉም ። ይሁንና ቤተክር ስቲያናችን በኢኩሜኒዝም መንፈስ የምትሳተፍባቸው ዓለም አቀፍ የክርስትና መድረኮች አሏት ።

የኬልቄዶንን ጉባኤ ከማይቀበሉት የኦሪየንታል ኦርቶዶክስ አብያተ ክርስቲያናት አንዷ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን መሆንዋን ከላይ ገልጸናል ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ከኦሪየንታል ኦርቶ ዶክስ አብያተ ክርስቲያናት ጋር ያላትን የሃይማኖት አንድነት አጽንታና አክብራ የያዘች ስትሆን የምትመራውና የምትተዳደረውም ከሐዋርያት በተገኘው ትውፊት መሠረት በቅዱስ ሲኖዶስ ነው ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ከቀደምት ነቢያት ጀምሮ ለሃይማኖት አባቶችና ለቤተክርስቲያን መሪዎች በነበራት ፍቅርና መንፈሳዊ አክብሮት የእስክንድርያ ቤተክርስቲያን «የኒቅያ ጉባኤ ውሳኔ ነው» ብላ በጻፈችው የተንኮል ድንጋጌ ለአንድ ሺህ ስድስት መቶ ዓመታት ከራስዋ ልጆች ሳትሾም ከእስክንድርያ ጳጳሳትን እየተቀበለች ስታስተናግድ ኖራለች ።

ቤተክርስቲያኒቱ ለ1600 ዓመታት በእስክንድርያ ቤተክርስቲያን ሥር በኖረችበት ጊዜ ከግብጽ የሚመጡት ጳጳሳት የእኛን ቋንቋ ካለማወ

ቃቸው እኛም የእነርሱን ቋንቋ ካለማወቃችን የተነሣ ባለመግባባት ብዙ ድክመት ታይቷል ።

የክርስትና እምነት እስከ ጕረቤት የመላው አፍሪካ አህጉር ሊዳረስ ሲችል በሀገር ውስጥ እንኳ እንደሚገባ አልተስፋፋም ። ቀድሞ ከነበሩት ት/ቤቶች በቀር ትምህርት ቤቶች በከፍተኛ ደረጃ አልተቋቋሙም ያን ጊዜ በነበረው የግብጻውያኑ ተጽዕኖም ምክንያት የውጭ ግንኙነታችን በሰፊው አልተዘረጋም ።

ከዚህም ከባድ የአስተዳደር ተጽዕኖ ለመላቀቅ የሰው ኃይል ፣ የጊዜና የብዙ ሀብት መሥዋዕትነት ተከፍሎአል ።

ከሺህ ስድስት መቶ ዓመታት በኋላም የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በብዙ ትግልና ፈሊጥ ከራስዋ ልጆች መርጣ ለመሾም የምትችልበትን መንፈሳዊ መብትና ነጻነት በማስገኘትና የራስዋ ባለቤት ለመሆን በማብቃት ግርማዊ ቀዳማዊ ዐፄ ኃይለ ሥላሴ ታሪክና ትውልድ የማይረሳው ገድል ፈጽመዋል ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ለመንበረ ማርቆስ ያላት አክብሮት የተጠበቀ ቢሆንም በግብጽ ቤተክርስቲያን መሪዎች በየጊዜው የሚፈጠረው የበላይነት ስሜት በሁለቱ አብያተ ክርስቲያናት መካከል ያለውን ግንኙነት እያሻከረ ነው ።

ተፈላጊ ያልሆነ ይህ አይነቱ ቅራኔ እንዲቀር በየጊዜው ቢሞከርም በኢየሩሳሌም የሚገኘውን የቦታ ይዞታችንን ለማሳጣት የሚደረገው ሴራ ቤተክርስቲያናችንን እያሳዘነ ነው ።

ይሁን እንጂ ቤተክርስቲያን በክርስቶስ ደም የተመሠረተች አሐቲ እንደ መሆንዋ መጠን የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በተሠማራችበት አቅዋምዋ ጸንታ እምነትዋንና ሥርዓትዋን ከማስፋፋት የሚያግዳት አይኖርም ።

የሁለቱ አብያተ ክርስቲያናት ግንኙነትም በመንፈሳዊ አመለካከት እየተመረመረ ወደፊት የተሻለ መልክ እንደሚኖረው ተስፋ ታደርጋለች ፣ ምኞትዋም ጸሎትዋም ነው ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በሀገር ውስጥ 32 አህጉረ ስብከት ያሏት ሲሆን ፣ በውጭ ሀገርም በኢየሩሳሌም ፣ በካሪቢያን

ደሴቶችና በላቲን አሜሪካ ፣ በአሜሪካ ፣ በአውሮፓ ፣ በአፍሪካ ፣ በካናዳና በአውስትራሊያ አህጉረ ስብከት አሏት ።

የኢየሩሳሌሙ ይዞታ ከልደተ ክርስቶስ በፊት ጀምሮ ከብሉይ ኪዳኑ እምነት ጋር በነበረው ግንኙነት ተያይዞ የመጣ የታሪክ ይዞታ ነው ። የኢትዮጵያ አርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን 40,000,000 (ዐርባ ሚሊዮን) ምእመናን 400,000 (ዐራት መቶ ሺህ) ካህናት ፣ 30,000 (ሠላሳ ሺህ) የሰበካ አብያተ ክርስቲያናት አሏት ።

በዚህም ሁሉ ከመንበረ ፓትርያርክ እስከ አጥቢያ ቤተክርስቲያን በዘረጋችው የአስተዳደር መዋቅር በቃለ ዓዋዲው ደንብ መሠረት መንፈሳዊና ማኅበራዊ አገልግሎትዋን በስፋት ታበረክታለች ።






መንበረ ፓትርያርክ ጠ/ጽ/ቤት
PATRIARCHATE
HEAD OFFICE

አህጉረ ስብከት
DIOCESES

ወረዳ ቤተክህነት
DIST. ECCL. OFFICE



# መግቢያ

በነቢያትና በሐዋርያት መሠረትነት ላይ የታነጸችው ጥንታዊት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ከአበው የተቀበለችውን እምነት ፣ ትምህርትና ትውፊት ጠብቃ በቃልና በጽሑፍ እያስፋፋች ከትውልድ ወደ ትውልድ ስታስተላልፍ ቆይታለች ።

እምነትዋን ፣ ትምህርትዋንና ሥርዓትዋን ፣ ታሪኳንና ትውፊትዋን የሚገልጹ መጻሕፍትን በየጊዜው እያዘጋጀች ለሕዝብ ታቀርባለች ። በመላ አገሪቱ የሚገኙ መምህራንና ሊቃውንትም የቤተክርስቲያኒቱ እምነትና ሥርዓት የሚጠበቁበትን መንፈሳዊ አገልግሎት በቃልም በጽሑፍም ሲያበረክቱ ኖረዋል ፣ በማበርከትም ላይ ናቸው ።

በክርስቶስ ደም ለተዋጀችው ለዚች ቤተክርስቲያን ሀልውና የበላይ ጠባቂ የሆነው ቅዱስ ሲኖዶስም አደራውንና ኃላፊነቱን በተግባር ለመወጣት የሚያደርገው ሁለንተናዊ እንቅስቃሴ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተጠናከረ በመምጣት ላይ ነው ። ይህንኑ በተመለከተ በቅርቡ ተዘጋጅተው ለሕዝበ ክርስቲያኑ የተሠራጩ የሕግና የሥርዓት የሃይማኖትም መጻሕፍት ከሁሉም ጊዜ በበለጠ ለሚያረገው እንቅስቃሴ በጥሩ ምሳሌነት ሊጠቀሱ የሚችሉ የሥራ ውጤቶች ናቸው ። የቤተክርስቲያኒቱን እምነትና ትምህርት ፣ ታሪክና ትውፊት የሚመለከቱ ለምእመናን ጠቃሚ የሆኑ መጻሕፍትን አሁንም በብዛትና በስፋት እያዘጋጁ የማሠራጨት ዕቅዱ ቀጥሎአል ። በዚህም መሠረት ይህ በመጠኑ አነስተኛ የሆነ በይዘቱ ግን ጥልቅ መልእክት ያለውና የቤተክርስቲያኒቱን እምነት ፣ ትምህርትና ሥርዓተ አምልኮት ጠቅለል ባለ መልኩ የያዘ መጽሐፍ ተዘጋጅቷል ።

መጽሐፉ ከትምህርተ ሃይማኖቱና ሥርዓተ አምልኮቱ ጋር ቤተክርስቲያኒቱ ከጐረቤትና ከውጭው ዓለም ጋር ያላትን የቆየ የወዳጅነት ፣ የተራድኦና የሰላም ግንኙነት በሰፊው ይገልጣል ።

በአሁኑ ጊዜ ስለ ኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን መንፈሳዊ አቋም ፣ ይዞትና እንቅስቃሴ ለማወቅ የሚሹ ብዙዎች ናቸው ። ይልቁንም ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ በአሁኑ ጊዜ የቤተክርስቲያኒቷን ዕድገት ለማጠናከር ከአኃት አብያተ ክርስቲያናት ጋር የበለጠ መቀራረብና መገናኘት ፣

ከምሥራቅ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያንም ጋር የተራድኦ ግንኙነት እንዲኖር በሚያደርጉት ከፍተኛ ጥረት የቤተክርስቲያኒቱን እምነትና ትምህርት ፣ ትውፊትና ታሪክ አጠር ባለ ዝግጅት ፣ ጥርት ባለ አጻጻፍ አዘጋጅቶ ማቅረብና ማሳወቅ እጅግ አስፈላጊ ሆኖ በመገኘቱ ቅዱስነታቸው በሰጡት መመሪያ መሠረት ይህ የእምነትና ሥርዓተ አምልኮት መጽሐፍ በቅዱስ ሲኖዶስ አባላትና በቤተክርስቲያኒቱ ምሁራን ቅንጅት ተዘጋጅቶ በቅዱስ ሲኖዶስ ተመርምሮ እንዲታተም ተደርጓል ።

# በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አሐዱ አምላክ አሜን

## ክፍል ፩

## እምነት

በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ትምህርት ከሁሉም ቅድሚያ የሚሰጠው ሃይማኖት ነው ፣ ቤተክርስቲያኒቱ ያለ ሃይማኖት እግዚአብሔርን ማገልገል እንደማይቻል ታምናለች ። የእግዚአ ብሔርም መንግሥት የሚወረሰው በሃይማኖት መሆኑን ለምእመናን ታስተምራለች ።

### ምዕራፍ ፩

### ሀልዎተ እግዚአብሔር (የእግዚአብሔር መኖር)

እግዚአብሔር የሚለው ስም የባሕርይ ስም ነው ። ትርጉሙም ዓለምን ፈጥሮ የሚገዛ ማለት ነው ።

የማይታይና የማይመረመር ሁሉን ማድረግ የሚችል ሁሉንም የፈጠረ መጀመሪያና መጨረሻ የሌለው ዘለዓለማዊ አምላክ መኖሩና ራሱን ለሰው ልጆች እንደገለጠ በቅዱሳት መጻሕፍት ተረጋግጧል ። (ዘጸአ.3፡6)

የዚህን ዘለዓለማዊ አምላክ መኖር ከሚያስረዱን የአእምሮ ማስረ ጃዎች ጥቂቶቹ የሚከተሉት ናቸው ።

ፍጥረት፡—የሰው ልጅ የእግዚአብሔርን መኖር ለመረዳት ብዙ ተመራምሮአል። በምርምሩም የእግዚአብሔርን መኖር ወደማወቅ የሚያ ደርሱ መንገዶችን አግኝቶአል ። ለማንኛውም ነገር ምክንያት አለው ። ለሥዕል ሠዓሊ ፣ ለመጽሐፍ ጸሐፊ ፣ ለወንበር ጠራቢ አለው ።

ለሚንቀሳቀስ ነገር ሁሉ አንቀሳቃሽ አለው ። በዚህ መሠረት ፤ "ፍጥረት ያለፈጣሪ የተገኘ አይደለም" ወደሚለው እምነት ተደርሶአል ። ፍጥረት ሁሉ ከታናሹ ጀምሮ እስከ ታላቁ ፤ አእምሮ ከሌለው ጀምሮ ከፍተኛ አእምሮ እስካለው ድረስ የእግዚአብሔርን መኖር ወደማወቅ ይመራል ፤ ስለዚህም ሰሎሞን "እግዚአብሔርን የማወቅ ጉድለት በልባቸው ያለባቸው ሰዎች ሁሉ በእውነት ከንቱ ናቸውና በእነዚህ በሚታዩ ፍጥረቶቹ በዚህ ዓለም የሚኖር እርሱን ያውቁ ዘንድ ተሳናቸው ፤ ሥራውንም እያዩ ፈጣሪያቸውን አላወቁም ፤ ..... ፀሐይና ጨረቃን አይተው የፈጠራቸውን ይወቁ..." (ጥበብ 13፡1–10) ይላል ። ኢዮብም "እንስሶችን ጠይቅ ያስተምሩህማል ። የሰማይንም ወፎች ጠይቅ ይነግሩ ሀማል ። ወይም ለምድር ተናገር እርስዋም ታስተምርሀለች ፤ የባሕርም ዓሣዎች ይነግሩሀል ፤ የእግዚአብሔር እጅ ይህን እንዳደረገ ፤ ከእነዚህ ሁሉ ይህን የማያውቅ ማን ነው?" ብሏል (ኢዮብ 12፡7–9) ። ቅዱስ ዳዊትም በመዝሙር 18፡1–2 "ሰማያት የእግዚአብሔርን ክብር ይናገራሉ የሰማይ ጠፈርም የእጆቹን ሥራ ያወራል" በማለት ተናግሮአል ።

ታላቁ ሐዋርያ ቅዱስ ጳውሎስም ከዚህ ግልጥ በሆነ ሁኔታ እግዚአብሔር በፍጥረቱ ለፍጥረቱ እንደሚታወቅ ሲያስረዳ እንዲህ ይላል። "ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ታይቶ የማይታወቅ እግዚአብሔር ለፍጥረቱ በሥነ ፍጥረት ይታወቃል ።" (ሮሜ 1፡19–20)።

ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ ይህን የሐዋርያውን መልእክት በተረጐመበት ድርሳኑ እንዲህ ይላል "እግዚአብሔር ገናናነቱ በሥራው ይታወቅ ዘንድ ሁሉን ካለመኖር ወደ መኖር አመጣ ። ነፍስ በሰው ውስጥ እንደማትታይ ግን በሰውነት እንቅስቃሴ እንደምትታወቅ እግዚአብሔርም በሥጋዊ ዐይን አይታይም ግን በፈቃዱና በሥራው ይገለጣል ፤ ይታወቃልም ። በባሕር ላይ ተንሳፍፋ ወደፊት የምትጓዝ መርከብን የሚመለከት ሰው በውስጥዋ የሚመራት ነጂ እንዳለ ማወቅ አለበት እንደዚሁም ምንም በዓይነ ሥጋ ባይታይ ሁሉንም የሚመራ እግዚአብሔር እንደሆነ ማስተዋል ይገባዋል ። (የዮሐንስ አፈወርቅ ትርጓሜ ፤ ሮሜ 1፡19–20) ።

<u>ልቡና</u>፡– "ሕግ የሌላቸው አሕዛብ ከባሕርያቸው የሕግን ትእዛዝ ሲያደርጉ እነዚያ ሕግ ባይኖራቸው እንኳ ለራሳቸው ሕግ ናቸውና

እነርሱም ልቡናቸው ሲመሰክርላቸው አሳባቸውም እርስ በርሱ ሲካሰስ ወይም ሲያመካኝ በልባቸው የተጻፈውን የሕግ ሥራ ያሳያሉ።" (ሮሜ 2፡ 14–15)። ሰው በልቡናው ውስጥ ባለው መንፈሳዊ ሕግ አነሳሽነት መልካም ይሠራል ከክፉም ይርቃል ። ተላልፎ ክፉ ቢሠራም እንኳ ሕሊናው ይወቅሰዋል ። መልካም የሚሠራ ዋጋ እንደሚያገኝ ክፉ የሚሠራም እንደሚቀጣ ይኸው ሕሊናው ይመሰክርበታል ። ይህ ዓይነቱ ሕሊና ለደግም ሆነ ለክፉ እንደሥራው ዋጋ የሚከፍል አንድ አምላክ መኖሩን ወደ ማወቅ ይመራል ።

ታሪክ፡– በዚህ ዓለም አምልኮት የሌለው ሕዝብ እንዳልኖረ የሰው ልጅ ታሪክ ያስረዳል ። ከጥንት ጀምሮ እስከ አለንበት ዘመን ድረስ የአልምኮቱ ዓይነት ይለያይ እንጂ ሁሉም በየወገኑ ባዕድ አምላክ ወይም ብዙዎች አማልክትን ያመልካል ። ይህም ሁሉ የሚያሳየው የአንድ እውነተኛ አምላክ መኖርን ነው ። እግዚአብሔር ባይኖር ሰው ይህን የአምልኮት ጠባይ ከየት ሊያገኝ ቻለ? (የሐዋ·14፡11–16 ፡ 17፡26–29) ።

በቅዱሳት መጻሕፍት ስለ እግዚአብሔር መኖር በሰፊው ከመነገሩም በላይ ስለ እርሱ የተሰጡ መግለጫዎች አሉ ። እነርሱም የሚከተሉት ናቸው ።

ቅድስና፡–እግዚአብሔር ቅዱስ ነው ፤ ከክፉ ወይም ከርኩስ ነገር ጋር ምንም ግንኙነት የለውም ። እርሱ ራሱ "እኔ ቅዱስ እንደሆንሁ እናንተም ቅዱሳን ሁኑ" ሲል ተናግሮአል ። (ዘሌዋ 19፡2 ። 1ጴጥ·1፡16) ። ሁልጊዜ በመላእክት ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እየተባለ ሲመሰገን ይኖራል (ኢሳ·6፡3) ።

ፍቅር፡– እግዚአብሔር ፍቅር በመሆኑ ፍጥረቱን ይወዳል መልካም የሆነውን ነገር ሁሉ ለፍጥረቱ ይሰጣል ።

እግዚአብሔር ፍቅር መሆኑ በወንጌላዊው ዮሐንስ ወንጌልና መልእክታት ተደጋግሞ ተገልጦአል ። (1 ዮሐ· 4፡8) በኋላም ሰው መሆኑ ፍቅሩን ያመለክታል ። (ዮሐ·3፡16 ። ሮሜ 5፡5)።

ጽድቅ፡– እግዚአብሔር በሁሉ እውነተኛ ነው ፤ በእውነተኛነቱ ለሁሉ በትክክል ይፈርዳል ፤ (1 ሳሙ 2፡2፡2 ጢሞ 4፡8) ዮሐንስ በራእዩ 16፡7 "አዎ ጌታዬ ሁሉን የምትገዛ ፍርድህ እውነተኛና የሚገባ ነው" ይላል ።

ጥበብ፡- ፍጥረትንና የፍጥረቱን ሥነ ሥርዓት ክንውን ስንመለከት የእግዚአብሔርን ፍጹም ጥበብ እንረዳለን ። ነቢዩ ዳዊት እግዚአብሔር በጥበብ የሠራውን ሁሉ በማድነቅ እንዲህ ይላል ። "አቤቱ ሥራህ እጅግ ብዙ ነው ሁሉን በጥበብ አደረግህ" (መዝ፡ 103፡24)።

ከአንድ እስከ አራት ክተመለከትናቸው የባሕርዩ መግለጫዎች የተለዩ ሌሎች የግዚአብሔር የባሕርዩ መግለጫዎች አሉ ።

ሁሉን ቻይነት (ከሃሌ ኩሉ) ፡- ለእግዚአብሔር የሚሳነው ነገር ፈጽሞ የለም ፡ ሁሉን ማድረግ ይችላል ፣ እግዚአብሔር ራሱ ለአብርሃም "ሁሉን ቻይ ነኝ" ብሎ ገልጦለታል ። (ዘፍ· 17፡1። 18፡14 ። ሉቃ 1፡37)

ሁሉን ማወቅ፡- እግዚአብሔር ሁሉን ነገር ከመሆኑ በፊት ያውቀዋል። ነገሮችን ሁሉ ከመታሰባቸውና ከመሠራታቸው በፊት ያውቃቸዋል ። (መዝ 138፡2፣ ዮሐ·2፡25) ።

ምሉዕነት፡- እግዚአብሔር በቦታና በጊዜ አይወሰንም በየትም ቦታ አለ ፣ ምንም እንኳን ስለ ልዕልናው በሰማይ እንደሚኖር ቢነገርም በሰማይ ብቻ አይወሰንም ። ቅዱስ ዳዊት እንዲህ ይላል "ከመንፈስህ ወዴት እሄዳለሁ? ከፊትህስ ወዴት እሸሻለሁ? ወደሰማይ ብወጣ አንተ በዚያ አለህ ወደ ሲኦልም ብወርድ በዚያ አለህ..." (መዝ 138፡7-10 ። ኤር 23፡23 ሠለስቱ ምእት ቅዳሴ)

ዘለዓለማዊነት፡- እግዚአብሔር በዘመናት አይወሰንም ፣ ከዘመን በፊት ነበረ ፣ ዘመናትንም አሳልፎ ይኖራል ። (መዝ 89፡ 1-2) በጠቅላላ አነጋገር እግዚአብሔር መጀመሪያና መጨረሻ የለውም ራሱ መጀመሪያና መጨረሻ ነው በእርሱ ዘንድ ለውጥ የለም ። (ኢሳ 44፡6 ። ያዕ 1፡17)

# ምዕራፍ ፪

## ሥነ ፍጥረት ፤

ቅዱስ መጽሐፍ የእግዚአብሔርን መኖር በማረጋገጥ እግዚአብሔር ሰማይንና ምድርን ፈጠረ በማለት ይጀምራል ። (ዘፍ·1፡1) ቅዱስ ጳውሎስም በዕብራውያን መልእክቱ 3፡4 ላይ "ሁሉን የፈጠረ እግዚአ ብሔር ነው" ይላል ።

እግዚአብሔር ሁሉን አስገኘ ፤ ለሁሉ ነገር መገኛ ጥንትና መሠረት ነው ። ለእርሱ ግን ለህላዌው ምክንያት የለውም ። (የሐዋርያት ጸሎተ ሃይማኖት) እግዚአብሔር ይህን የሚታየውንና የማይታየውን ዓለም በውስጣቸውም ያሉትን ሁሉ ከቸርነቱ ብዛት የተነሣ ፈጠረ ። (ኢሳ·42፡5) ።

እግዚአብሔር ይህን ዓለም ካለመኖር ወደ መኖር ያስገኘው "ለይኩን" ባለው ቃሉ ብቻ ነው ። ይህ ዓለም ከመፈጠሩ በፊት ምንም ነገር አልነበረምና (ጥበበ ሰሎሞን 11፡17 ። 1 መቃብ 27፡1 ቅዱስ ጳውሎስም "ዓለሞች ሁሉ በእግዚአብሔር ቃል እንደተፈጠሩ ስለዚህም የሚታየው ነገር ከሚታዩት እንዳልሆነ በእምነት እናስተውላለን" (ዕብ 11፡3 ) በማለት እግዚአብሔር ፍጥረትን ካለመኖር ወደ መኖር አምጥቶ መፍጠሩን አስረድቷል ።

ፈጣሬ ፍጥረታት እግዚአብሔር ሥነ ፍጥረትን በየመልኩና በየወገኑ መፍጠሩ ክብሩ ይገለጥበትና ስሙ ይቀደስበት ዘንድ ነው ። ይህንም ነቢዩ ኢሳይያስ "ፍጥረታትን ሁሉ ለክብሬ ፈጠርኋቸው አለ እግዚአብሔር" ብሎ ተናግሮአል ። (ኢሳ·43፡7)

ፍጥረታት ሁሉ በየወገናቸው ከዕለተ እሑድ እስከ ዕለተ ዓርብ ባሉት ስድስት ቀናት በቅደም ተከተል መፈጠራቸውን ቅዱስ መጽሐፍ ይናገራል ።

እነዚህም በስድስቱ ዕለታት የተፈጠሩ ፍጥረታት በየወገን በየወገናቸው ተቆጥረው ሃያ ሁለት መሆናቸውን መጽሐፈ ኩፋሌ ይናገራል ።

(ዘፍ 1፡1–31) ኩፋሌ ፡ 3 ፡9) በየዕለቱ የተፈጠሩት ፍጥረታትም በሚከተለው ሁኔታ የተገለጡት ናቸው ።

ሀ) <u>የእሑድ ፍጥረታት</u>

1· እሳት
2· ነፋስ
3· ውሃ
4· መሬት (ዐራቱ ባሕርያት)
5· ጨለማ
6· ሰባቱ ሰማያት
7· መላእክት
8· ብርሃን ናቸው (ኩፋሌ 2፡5–8 ዘፍ· 1፡1–5) ።

ለ) <u>የሰኞ ፍጥረት</u>

በምድር ላይ ሞልቶ የነበረው ውሃ ተከፍሎ ጠፈር ተገለጠ (ዘፍ 1፡6–8 ። ኩፋሌ 2፡9 ። ዘፍ 1 ፡9)

ሐ) <u>የማክሰኞ ፍጥረት</u>

1· በጣት የሚለቀሙ አትክልት
2· በማጭድ የሚታጨዱ አዝርዕት ።
3· በምሣር የሚቆረጡ ዕፀዋት ናቸው ። (ዘፍ 1፡11–13 ።)

መ) <u>የረቡዕ ፍጥረታት</u>

1· ዐሐይ
2· ጨረቃ
3· ከዋክብት ናቸው (ዘፍ·1፡14–16)

ሠ) <u>የሐሙስ ፍጥረታት</u>

በደመ ነፍስ የሚንቀሳቀሱ ከባሕር ውስጥ ፡

1· በደረት የሚሳቡ
2· በእግር የሚያኮበኩቡ
3· በክንፍ የሚበሩ እንስሳት ፡አራዊትና አዕዋፍ ናቸው ፡ (ዘፍ 1፡20–22)።

ረ) <u>የዐርብ ፍጥረታት</u>

በደመ ነፍስ ሕይወት የሚንቀሳቀሱ በየብስ የሚኖሩ ፤

1· ዘመደ እንስሳ ፤

2· ዘመደ አዕዋፍ ፤

3· ዘመደ አራዊት ፤

4· በነባቢት ነፍስ የሚንቀሳቀስ ሰው ናቸው (ዘፍ 1፡24–28)።

እነዚህን ሁሉ ፍጥረታት በየወገኑ ከፈጠራቸው በኋላ መልካም እንደሆኑ አይቶ እግዚአብሔር በሥራው ደስ አለው እንዲበዙም ባረካቸው። (ዘፍ 1፡21 ። መዝ 103፡31)።

## የሰው ተፈጥሮ

እግዚአብሔር ከዕለተ እሑድ እስከ ዕለተ ዐርብ ያሉ ፍጥረታትን በየዓይነታቸው ከፈጠረ በኋላ ሰውን የእነዚህ ሁሉ የበላይ ገዢ አድርጎ በመልኩና በአርአያው ፈጠረው ፤ በደመ ነፍስ ሕይወት ከሚኖሩ ፍጥረታት የምትለየውን ነባቢት ፤ ለባዊትና ሕያውት ነፍስን በውስጡ አሳደረበት ። ወንድና ሴትም አደረጋቸው "ብዙ ተባዙ ምድርንም ሙሉአት ግዙአትም" ብሎ ባረካቸው ። (ዘፍ 1፡26–28) ። በእግዚአ ብሔር አርአያና ምሳሌ የተፈጠረው ሰው ባለ አእምሮ ፍጡር ነው ።

<u>7ኛ ቀን</u>፡– እግዚአብሔር በሰባተኛው ቀን ከመፍጠር ሥራው ዐረፈ። ስለዚህም ሰባተኛይቱን ቀን የዕረፍት ቀን እንድትሆን ባረካት ቀደሳትም" ተብሎ ተጻፈ ። (ዘፍ2፡3) ።

ስለዚህ እግዚአብሔር የፍጥረታት ሁሉ አስገኝና ባለቤት ነው ። እግዚአብሔር ዓለምን በሥልጣኑ ማስገኘት ብቻ ሳይሆን መጋቢው ፤ መሪውና ጠባቂውም ነው ። (መዝ 103፡27–31 ። 1ቆሮ· 3፡22። 15፡28። የሐዋ· 14፡17) ።

# ምዕራፍ ፫

# አምስቱ አዕማደ ምሥጢር

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን መሠረተ እምነ ትዋን የምትገልጥባቸውና የምታስተምርባቸው አምስት አዕማደ ምሥጢር አሏት ። አዕማድ ማለትም ምሰሶዎች ማለት ነው ። የምሥጢር ምሰሶዎችም የተባሉበት ምክንያት ቤት በምሰሶ ተደግፎ እንደሚጸና ምእመናንን በትምህርተ ሃይማኖት ደግፈው የሚያጸኑ ስለሆነ ነው ። እነዚህም አምስቱ አዕማደ ምሥጢር መጽሐፋዊ መሠረት ያላቸው ናቸው (1 ቆሮ·14፡19።)

በዚህም መሠረት አምስቱ አዕማደ ምሥጢር የእምነታችን መግለጫ በሆነው በጸሎተ ሃይማኖት ተዘርዝረው ይተረጐማሉ ።

## 1· ምሥጢረ ሥላሴ

ይህ ክፍል የሥላሴ አንድነትና ሦስትነት የሚገለጥበት የምሥጢር ዓምድ ነው ። ሥላሴ በስም በግብር ፤ በአካል ሦስት ሲሆኑ በባሕርይ ፤ በመለኮት ፤ በህልውና በፈቃድ አንድ ናቸው ።

የስም ሦስትነት ፤ አብ ፤ ወልድ ፤ መንፈስ ቅዱስ ፤

የግብር ሦስትነት፡ አብ ወላዲ ፤ ወልድ ተወላዲ መንፈስ ቅዱስ ሠራፂ ነው ።

የአካል ሦስትነት ፤ ለአብ ፍጹም አካል አለው ፤ ለወልድ ፍጹም አካል አለው ፤ ለመንፈስ ቅዱስም ፍጹም አካል አለው ።

አብ ልብ ነው ፤ ወልድ ቃል ነው ፤ መንፈስ ቅዱስ እስትንፋስ ነው ። አብ ለራሱ ለባዊ ሆኖ ለወልድና ለመንፈስ ቅዱስ ልባቸው ነው ። ወልድ ለራሱ ቃል ሆኖ ለአብና ለመንፈስ ቅዱስ ቃላቸው ነው ። መንፈስ ቅዱስ ለራሱ እስትንፋስ (ሕይወት) ሆኖ ለአብና ለወልድ እስትንፋስ (ሕይወት) ነው ።

ሥላሴ በስም ፤ በግብር ፤ በአካል ሦስት ናቸው ብንልም በባሕርይ በመለኮት በህልውና በፈቃድ አንድ ስለሆኑ አንድ አምላክ እንጂ ሦስት አማልክት አይባሉም ። አብ ወልድ ፤ መንፈስ ቅዱስ ፤ በየአካላቸው ሲኖሩ ህልውናቸው አንዲት ናት ። (አበ ሊዲስ ሃይ·አ/ምዕ 40 ክፍ 4 ቁ 6።)

የሥላሴ የሦስትነት ስማቸው የአንዱ ወደ አንዱ አይፋለስም ። ይህም ማለት የአብ ስም ተለውጦ ወልድ መንፈስ ቅዱስ ፤ የወልድ ስም ተለውጦ አብ መንፈስ ቅዱስ ፤ የመንፈስ ቅዱስ ስም ተለውጦ አብ ወልድ ተብሎ አይጠራም ። አብ ፡ አብ ነው ። ወልድ ወልድ ነው ፤ መንፈስ ቅዱስም መንፈስ ቅዱስ ነው ። ሦስቱም በየስማቸውና በየአካላቸው ፤ ጸንተው ይኖራሉ (አግናጢዎስ ሰማዕት ሃይ·አበ) ምዕ·11 ክፍ 1 ቁ 7–8።)

በአንድነት ስማቸው ግን ፡– እግዚአብሔር ፤ አምላክ በመባል ሦስቱም ይጠሩበታል ። እግዚአብሔር አብ ፤ እግዚአብሔር ወልድ ፤ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ አንድ እግዚአብሔር ። አብ ፡ አምላክ ወልድ አምላክ ፡ መንፈስ ቅዱስ አምላክ ፤ አንድ አምላክ ፡ ይባላል ። ይህንም ሦስት መቶ አሥራ ስምንቱ ሊቃውንት በሃይማኖት አበው ሲያስረዱ «በእግዚአብሔር አብ ፤ በእግዚአብሔር ወልድ ፤ በእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ እናምናለን» ብለዋል (ሃይ አበ ዘሠለስቱ ምእት/ምዕ19 ፡ ክፍል 1 ቁጥር 30።)

የእስክንድርያው ሊቀ ጳጳሳት ቅዱስ ሐዋርያዊ አትናቴዎስም «አብ አምላክ ነው ፤ ወልድ አምላክ ነው ፤ መንፈስ ቅዱስ አምላክ ነው ፤ ግን አንድ አምላክ እንጂ ሦስት አማልክት አይባሉም» በማለት ገልጾአል (ሐዋርያዊ አትናቴዎስ ሃይ·አበ· ። ምዕ 24 ክፍል 4 ቁጥር 4)

ስለ ሥላሴ አንድነትና ሦስትነት በብሉይና በሐዲስ ኪዳናት በብዙ ቦታ ተገልጾአል ።

<u>በብሉይ ኪዳን</u>

ዘፍ· 1፡26።2፡18።3፡22።11፡7።18፡1–3። መዝ· 33፡6።146፡5። ኢሳ6፡3፡8።

<u>በሐዲስ ኪዳን</u>

ማቴ· 3፡16–17። 28፡19። ዮሐ·14፡26። 2 ቆሮ· 14፡13። 1 ጴጥ· 1፡2። 1 ዮሐ· 5፡7–8።

## 2· <u>ምሥጢረ ሥጋዌ</u>

ምሥጢረ ሥጋዌ ከሦስቱ አካላት አንዱ፡– እግዚአብሔር ወልድ ከሰማየ ሰማያት ወርዶ ከቅድስት ድንግል ማርያም ከሥጋዋ ሥጋ ፤ ከነፍስዋም ነፍስ ነሥቶ በሥጋ የመገለጹ ፤ አምላክ ሰው ፤ ሰው አምላክ ፤ የመሆኑ ምሥጢር ነው ። «ቃል ሥጋ ሆነ በእኛም አደረ» (ዮሐ 1፡14)።

## እግዚአብሔር ወልድ ሰው የሆነበት ምክንያት

እግዚአብሔር የመጀመሪያዎቹን ሰዎች አዳምንና ሔዋንን በንጹሕ ባሕርይ ያለሞት ፈጥሮአቸዋል ። «እግዚአብሔር ሞትን አልፈጠረምና»። (መጽ· ጥበብ 1፡13)።

ይሁን እንጂ የሰው ልጅ የተሰጠውን ትእዛዝ በማፍረስ ስለበደለ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ ፡ ርደተ መቃብርና ርደተ ገሃነም ተፈረደበት(ዘፍ 3፡19–24 እግዚአብሔር ሞትን አልፈጠረምና ነዋሪ ይሆን ዘንድ ፍጥረትን ፈጥሮዋል እንጂ የሰዎች ጥፋት ደስ አያሰኘውም ፡ በእጃችሁ ሥራ ሞትን አታምጡ ። የሰውም መፈጠር ፡ ለደኅንነት ነውና ። በእነርሱ ዘንድ ሁሉን የሚያጠፋ የሞት መርዝ ኃጢአት አልነበረምና ። ሕይወት የማታልፍ ስለሆነች ለመቃብርም በዚህ ዓለም ግዛት አልነበረውምና እግዚአብሔርን የዘነጉ ሰዎች ግን በቃል ጠሩት ። ባልንጀራም አደረጉት በዚሁም ጠፉ (ጥበብ 1፡13–17። ሮሜ 6፡23። እግዚአብሔር ለሞት አልሠራንምና ለሕይወት እንጂ» 1 ተሰ· 5፡9)።

አዳምና ሔዋን በበደላቸው ከክብራቸው ተዋረዱ ፡ ከጸጋቸው ተራቆቱ ፡ ከተድላ ገነት ወጡ ፡ ተባረሩ ፡ በሥራቸው በራሳቸው ላይ ብዙ መከራን አመጡ ። ተጨነቁ ፡ ተቸገሩ ፡ ለአጋንንትም ተገዥ ሆኑ ። በኃጢአት ምክንያት ወደ ዓለም የገባው ሞት በሰው ላይ ሠለጠነ ፡ ከአዳም እስከ ክርስቶስ የነበሩትን ሁሉ ሞት አንድ አድርጎ ገዛቸው ። (ሮሜ 5፡12–14) ይህ ሁሉ መከራ የመጣባቸው ሕገ እግዚአብሔርን በመተላለፋቸው መሆኑን አውቀው ተጸጸቱ ፡ አዘኑ ፡ አለቀሱ ፡ ንስሐ ገብተው ፡ ፈጣሪያቸውን ለመኑት ። እግዚአብሔርም በፈታሒነቱ አንጻር መሐሪነቱ አለና የአዳምንና የሔዋንን ንስሐቸውን ተቀብሎ ኀዘናቸውንና ለቅሶአቸውን ተመልክቶ ሊያድናቸው ወደደ ፡ ተስፋም ሰጣቸው ፡ (ኢሳ 63፡8 ዕብ· 2፡14–16።)

ይህም የተሰጠው ተስፋ የሚፈጸምበት ዘመን በደረሰ ጊዜ በእርሱ የሚያምን ሁሉ የዘለዓለም ሕይወት እንዲያገኝ ፡ ልዑል እግዚአብሔር ተቀዳሚ ተከታይ የሌለውን አንድ የባሕርይ ልጁን ወደ ዓለም ላከው ፡ እግዚአብሔር ወልድም ከሰማየ ሰማያት ወርዶ ንጽሕት ከምትሆን ከቅድስት ድንግል ማርያም ሰው ሆኖ ተወለደ ። ሰው ሆነ ማለትም በተለየ

አካሉ ነፍስና ሥጋን ተዋሐደ ማለት ነው ። በዚህም የነቢያት ቃል ሁሉ ተፈጸመ (ኢሳ 7፡14፡ 9፡6፡ ሚክ 5፡2፡ ገላ 4፡4)።

መለኮት ከሥጋ ፡ ሥጋ ከመለኮት ጋር ያለ መለወጥ ፡ ያለመቀላቀል ፡ ያለ መለያየትና ያለ መከፈል በተዋሕዶ አንድ አካል አንድ ባሕርይ ሆነ ። ሰው ከመሆኑ አስቀድሞ ፡ ሰውም ከሆነ በኋላ አንድ ወልድ ፡ አንድ ክርስቶስ ነው ። (ቄርሎስ ሃይ አበ ምዕ 78 ክፍ 48 ቁ 9–18)። ቅዱስ ጎርጎርዮስ ዘእንዚናዙም ፡– «በተዋሕዶ ሰው የሆነ አምላክ ፡ አምላክም የሆነ ሰው እርሱ ብቻ ነው» ብሎአል ሃ·አ·ምዕ·61·ክፍል·4·ቁጥር·23· ሥጋም በተዋሕዶተ ቃል እንደከበረ ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ «በሥጋ የነበረ ንዴት በተዋሕዶተ ቃል ጠፋ ፡ የቃል ክብር ለሥጋ በተዋሕዶ ገንዘቡ ሆነ» ብሎአል ። (ዮሐ አፈ ሃይ/አ/ምዕ 66 ክፍ 9 ቁጥ 18–19)። ከተወለደም በኋላ ከኀጢአት በቀር ሰው የሚሠራውን ሥራ ሁሉ እየሠራ አደገ ፡ በዚህም ዓለም 33 ዓመት ከሦስት ወር ኑሮና አስተምሮ ስለእኛ የሞት ፍርድን ተቀበለ በመስቀል ተሰቅሎ ሞተ ፡ በሞቱም ሞትን አጠፋ ፡ ዓለምን አዳነ ፡ ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት በከርሠ መቃብር አድሮ ተነሣ ። ከተነሣም በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ እየታየ ጉባኤ ሠርቶም መጽሐፈ ኪዳንን እያስተማረ በምድር ላይ አርባ ቀን ቆየ ። በአርባኛውም ቀን ደቀ መዛሙርቱ እያዩት በመላእክት ምስጋናና በክብር ወደ ሰማይ ዐረገ ። በአባቱም ቀኝ (ዕሪና) ተቀመጠ ፡ ዳግመኛም በሕያዋንና በሙታን ላይ ሊፈርድና ለሁሉም እንደሥራው ዋጋውን ይከፍል ዘንድ ይመጣል ። (ዮሐ3፡13። 1ጴጥ 3፡22። ማቴ 25፡31። ኤፌ·4፡8–10። የሐዋ·2፡30። 2ቆሮ 5፡14 ።

ስለዚህ በምሥጢረ ሥጋዌ የሚገለጠው ትምህርት ክርስቶስን ቃለ አብ ወመንፈስ ቅዱስ ፡ ድንግል ማርያምን በአማን ወላዲተ አምላክ ወላዲተ ቃል ፡ ብሎ ማመን ነው ። ቄርሎስ ሃይ/አ) ።

## 3· ምሥጢረ ጥምቀት፡

ጥምቀት በምሥጢረ ሥላሴና በምሥጢረ ሥጋዌ ለሚያምን ሰው ሁሉ የሚሰጥ የኀጢአት መደምሰሻ ፡ ከእግዚአብሔር የልጅነትን ጸጋ መቀበያ ፡ የመንግሥተ ሰማያትም መውረሻ ነው ። ምሥጢር መባሉም ካህኑ ለጥምቀት የተመደበውን ጸሎት አድርሶ ሲባርከው ውሃው ተለውጦ ማየ ገቦ ስለሚሆንና ከእግዚአብሔር ዘንድ የጸጋ ልጅነትን ስለሚያሰጥ ነው ። (ዮሐ 19፡34–35)።

አምኖ የሚጠመቅ ሁሉ የኃጢአት ሥርየትን ያገኛል ፤ «ወነአምን በአሐቲ ጥምቀት ለሥርየተ ኃጢአት ፦ ኃጢአትን ለማስተሥረይ በአንዲት ጥምቀት እናምናለን» (ጸሎተ ሃይማኖት)

ማንም ሰው በጥምቀት ከእግዚአብሔር ይወለዳል ፤ ከፍዳ ይድናል ። "ያመነ የተጠመቀም ይድናል ፤ ያላመነና ያልተጠመቀ ግን ይፈረድ በታል" (ማር·16፥16 ፤ የሐዋ·2፥28)። ከሥላሴ መወለድም የእግዚአብ ሔርን ርስት መንግሥተ ሰማያትን ለመውረስ ነው ። መንግሥተ ሰማያትም በጥምቀት እንጂ ያለ ጥምቀት ልንገባባት እንደማንችል ጌታችን አስተምሮአል ። «እውነት እውነት እልሀለሁ ማንም ከውሃና ከመንፈስ ቅዱስ ያልተወለደ ወደ እግዚአብሔር መንግሥት መግባት አይችልም» (ዮሐ· 3፥5። ቲቶ 3፥4–7)።

ስለ ጥምቀት በሕግና በነቢያት የተነገሩ ትንቢቶችና የተገለጡ ምሳሌዎች አሉ ።

ሀ) <u>ትንቢት</u>፦ «የጠራ ውሃ እረጫችሁአለሁ ትጠሩማላችሁ» ከርዞሰታችሁም ከጣኦቶቻችሁም ሁሉ አነጻችሁአለሁ ። (ሕዝ· 36፥25። ሚክ· 7፥19) ።

ለ) <u>ምሳሌ</u>፦ 1· <u>ግዝረት</u>

ግዝረት የጥምቀት ምሳሌ ሆኖ በብሉይ ኪዳን ሲሠራበት ኖሮአል ። ግዝረት ለአብርሃም የቃል ኪዳን ምልክት ሆኖ በመሰጠቱ በስምን ተኛው ቀን ያልተገረዘ ሁሉ ከአብርሃም ቤተሰብ አይቈጠርም ምድረ ርስትንም አይወርስም ፤ ከተስፋው አይካፈልም ። የእግዚአብሔርም ወገን አይባልም ነበር ። (ዘፍ· 17፥7)።

በሐዲስ ኪዳን በግዝረት ፈንታ ጥምቀት ተተክቶአል ። ያልተጠመቀ ሁሉ የእግዚአብሔር ልጅ አይባልም ፤ መንግሥተ ሰማያትን አይወ ርስም ። (ቆላስይስ 2፥11)

በብሉይ ኪዳን መፈጸሚያ ፤ በሐዲስ ኪዳን መጀመሪያ የነበረው መጥምቁ ዮሐንስም በውሃ ያጠምቅ ነበር ። (ማር· 1፥4–8)

2· <u>የኖኅ መርከብና የእስራኤል ቀይ ባሕርን መሻገር</u> የጥምቀት ምሳሌዎች ነበሩ ፤ (1ኛ ጴጥ· 3፥19 ፤ 1 ቆሮ· 10፥2)።

ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ትንቢቱን ለመፈጸም ፤ ምሳሌውን አማናዊ ለማድረግ በማየ ዮርዳኖስ (ወንዝ) በዮሐንስ እጅ

ተጠምቆአል ። (ማቴ 3፡16። ማር 1፡9። ሉቃ 3፡21 ። ዮሐ 1፡31)።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ምሥጢረ ጥምቀትን ለወንዶች በ40 ቀን ፣ ለሴቶች በ80 ቀን ትፈጽማለች ። ይህም ዕድሜ የመጀመሪያዎቹ ሰዎች ከእግዚአብሔር ልጅነትን የተቀበሉበት ነው ። (ኩፋሌ 4፡2–15)።

## 4· ምሥጢረ /ቁርባን

ቁርባን ወደ እግዚአብሔር የምንቀርብበት ፣ ከእግዚአብሔር ጋር አንድ የምንሆንበት ምሥጢር ነው ። «እውነት እውነት እላችኋለሁ የወልደ እጓለ እመሕያው ክርስቶስን ሥጋውን ካልበላችሁ ደሙን ካልጠጣችሁ የዘለዓለም ሕይወት የላችሁም ። ሥጋዬን የበላ ደሜን የጠጣ የዘለዓለም ሕይወት አለው ። ሥጋዬና ደሜ ሕይወትነት ያለው እውነተኛ ምግብ ነውና ። ሥጋዬን የበላ ደሜን የጠጣ ከእኔ ጋር ይኖራል ። እኔም ከእርሱ ጋር እኖራለሁ» (ዮሐ· 6፡53–57)። ተብሎ ተጽፎአልና ።

ስለ ምሥጢረ ቁርባን አስቀድሞ የተነገሩ ትንቢቶችና የተገለጡ ምሳሌዎች አሉ ።

### ትንቢት

«ከስንዴ ፍሬና ከወይን ፣ ከዘይትም ይልቅ በዛ» (መዝ 4፡7)። ጥበብ ቤትዋን ሠራች ፣ ሰባቱንም ምሰሶዎችዋን አቆመች ፣ ፍሪዳዋን አረደች ፣ የወይን ጠጅዋንም ደባለቀች ፣ ማዕዷንም አዘጋጀች (ምሳሌ· 9፡1–9)።

የሰው የሕይወቱ መጀመሪያ እህልና ውሃ ወይንና ስንዴ ነው ። (ሲራ 39፡26)።

እነዚህም ትንቢቶች በመስቀል ላይ የተሠዋው በግዐ ፋሲካ ኢየሱስ ክርስቶስ ሥጋውን ደሙን በስንዴ ኅብስትና በወይን እንደሚሰጥ የተነገሩ ናቸው ።

### ምሳሌ

የእስራኤል ልጆች ከግብጽ የባርነት አገዛዝ በወጡበት ጊዜ አርደው ሥጋውን እንዲበሉት ደሙንም የቤታቸውን መቃን ጉበንና መድረኩን ረጭተው ከመቅሠፍትና ከሞተ በኵር እንዲድኑ የተሰጠው የፋሲካቸው

በግ በመስቀል ላይ የተሠዋውና ሥጋውንና ደሙን ለሰው ልጆች ሕይወት ቤዛ አድርጎ የሰጠው የወልደ እግዚአብሔር የኢየሱስ ክርስቶስ ምሳሌ ነው ። ይህም «እነሆ የዓለምን ኃጢአት የሚያስወግድ የእግዚአብሔር በግ» (ዮሐ· 1፡29) ተብሎ በተጻፈው ታውቋል ።

ለወልደ እግዚአብሔር ኢየሱስ ክርስቶስ ምሳሌ የሆነው ካህን መልከ ጼዴቅም በኅብስትና በወይን ያስታኩት ነበር ። (ዘፍ· 14፡18)።

እነዚህን ትንቢቶችና ምሳሌዎች ለመፈጸምና አማናዊ ለማድረግ ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በምሴተ ሐሙስ በተዘጋጀው የፋሲካ ዕራት ኅብስቱን አንስቶ አመስግኖ ባርኮ ቆርሶ ለደቀ መዛሙርቱ «ይህ ሥጋዬ ነው ፣ እንኩ ብሉ» ብሎ ሰጣቸው ጽዋውንም አንሥቶ አመስግኖ ባርኮ «እንኩ ሁላችሁ ከዚህ ጠጡ ፣ ለሐዲስ ኪዳን ኃጢአትን ለማስተሠረይ ስለ ብዙ ሰዎች የሚፈስ ደሜ ይህ ነው» ብሎ ሰጣቸው ። (ማቴ 26፡28። ማር· 14፡22። ሉቃ· 22፡19)። ይህ ምሥጢር አሁንም በቤተክርስቲያናችን ይፈጸማል ።

ቄሱ በቅዳሴ ጊዜ ኅብስቱን በፃሕል ወይኑን በጽዋዕ አድርጎ እየባረከ ጸሎተ ቅዳሴውን ሲያደርስበት ኅብስቱ ተለውጦ አማናዊ ሥጋ ወልደ እግዚአብሔር ፣ ወይኑ ተለውጦ አማናዊ ደመ ወልደ እግዚአብሔር ይሆናል ።

ይህንም ሊቁ ቅዱስ አትናቴዎስ «ካህኑ፣— ሳይባርከውና ሳያከብረው ኅብስትና ወይን እንደሆነ ካህኑ በባረከውና ባከበረው ጊዜ ግን ኅብስቱ ከኅብስትነት የእምላክ ሥጋ ወደ መሆን ፣ ወይኑም ከወይንነት የወልደ እግዚአብሔር ደም ወደ መሆን እንደሚለወጥ እናምናለን» ብሎአል ። (አትናቴዎስ ሃይ/አበው· ምዕ· 28· ክፍ· 14· ቁ·22 ፤)

ስለዚህ በምሴተ ኀሙስ ሐዋርያት የተቀበሉት በዕለተ ዐርብ በመስቀል ላይ የተሠዋው ፣ ዛሬም በአራቱ መዓዝነ ዓለም እስከ ምጽአት ድረስ የሚሠዋው መሥዋዕት አንድ ነው ። ይኸውም «አማናዊ ሥጋ ወልደ እግዚአብሔር ፣ አማናዊ ደመ ወልደ እግዚአብሔር ነው እንጂ ምሳሌ ወይም መታሰቢያ አይደለም» ብላ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ታምናለች ታሳምናለች ። «ዛሬ በየጊዜው ካህናት የሚያቀርቡአት ንጽሕት መሥዋዕት ያን ጊዜ በቀራንዮ በመልዕልተ መስቀል የተሠዋችው ናት» ። (ዮሐ· አፈ· ቅዳሴ፡85)።

## 5· ምሥጢረ ትንሣኤ ሙታን

ትንሣኤ ሙታን ማለት ከአዳም እስከ ምጽአተ ክርስቶስ ከዚህ ዓለም በሞት የተለዩና የሚለዩ የሰው ልጆች ሁሉ በነፍስና በሥጋ አዲስ ሕይወት ለብሰው የሚነሡበት ምሥጢር ነው ።

ሰው ሁሉ በሚሞትበት ጊዜ የጻድቅም ሆነ የኃጥእ ሥጋው በመቃብር ይቆያል ። የጻድቃን ነፍስ በገነት ፣ የኀጥአን ነፍስ በሲኦል ትቆያለች ። (ሉቃ 16፡19–31)።

የዚህ ዓለም ፍጻሜ ሲደርስ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በሕያዋንና በሙታን ሊፈርድ በሚመጣበት ጊዜ የሰው ልጆች ሁሉ ይነሣሉ ። «ስለዚህ ነገር አታድንቁ በመቃብር ያሉት ሙታን ሁሉ ቃሉን የሚሰሙባት ሰዓት ትመጣለች ሕጉን የፈጸሙ በሕይወት ለመኖር ይነሣሉ ። ክፉ ሥራን የሠሩት ግን በፍዳና በጨለማ ለመኖር ይነሣሉ» ። (ዮሐ· 5፡28)።

ስለ ትንሣኤ ሙታን እምነትና ትምህርት ማረጋገጫ በብሉያት በሐዲሳት በብዙ ቦታ ይገኛል ። በዘዳግም 32፡39 ላይ «እኔ እገድላለሁ ፣ አድንማለሁ» በማለት ራሱ እግዚአብሔር የተናረው ቃል ተስፋ ትንሣኤን የሚያረጋግጥ ነው ። ነቢዩ ኢሳይያስ «ሙታን ይነሣሉ ፣ በመቃብር ያሉ ሕያዋን ይሆናሉ ። በምድር ውስጥ ያሉም ደስ ይላቸዋል ። ከአንተ የሚገኝ ጠል ሕይወታቸው ነውና» ። (ኢሳ 26፡19–20)። ዳንኤልም «በዚያም በመጽሐፉ ተጽፎ የተገኘው ሕዝብህ ሁሉ እያንዳንዱ ይድናል። በምድርም ትቢያ ውስጥ ካንቀላፉት ብዙዎቹ ይነቃሉ ፣ እኩሌቶቹ ወደ ዘለዓለም ሕይወት ፣ እኩሌቶቹም ወደ ዕፍረትና ወደ ዘለዓለም ጉስቁልና ይሄዳሉ» በማለት ተናግሮአል ። (ዳን· 12፡1–3)።

«እኔን ግን የሚቤዠኝ ሕያው እንደሆነ በመጨረሻም ዘመን በምድር ላይ እንዲቆም ይህ ቁርበቴም ከጠፋ በኋላ በዚያን ጊዜ ከሥጋዬ ተለይቼ እግዚአብሔርን እንዳይ አውቃለሁ ። እኔ ራሴ አየዋለሁ ዓይኖቼም ይመለከቱታል» ሲል ፣ ኢዮብ የትንሣኤን ነገር ገልጦአል ። (ኢዮብ 19፡25–27)።

የትንሣኤ ሙታን ትምህርት በቃል ብቻ የተነገረ አይደለም ከሞቱ ሰዎች መካከል እየተነሡ በተግባር ተገልጦአል ነቢዩ ኤልያስና ደቀ መዝሙሩ ኤልሳዕ ሙታንን አስነሥተዋል ። (1 ነገሥ· 17፡21 ። 2 ነገሥ·

13፡21)። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም በዚህ ዓለም በሚያስተምርበት ጊዜ ሙታንን አስነሥቶአል ። (ማቴ· 9፡25። ሉቃ· 7፡15። ዮሐ· 11፡14)። እንደዚሁም ሐዋርያት በትምህርት ጊዜያቸው ሙታንን አስነሥተዋል ። ጌታችን በተሰቀለበትም ዕለት ከእግረ መስቀሉ ብዙዎች ሙታን ተነሥተዋል ። (ማቴ· 27፡52)።

ይህ ሁሉ የሚያመለክተው የሰው ልጅ በመቃብር ውስጥ ፈርሶና በስብሶ እንደማይቀርና በመጨረሻ ቀን እንደሚነሣ ነው። ለትንሣኤያችን መሠረት የምናደርገው ግን የክርስቶስን ትንሣኤ ነው። «ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከሙታን ተለይቶ እንደተነሣ እኛንም በሐዲስ ትንሣኤ እንደሚያስነሣን እናውቃለን» ፤ (2 ቆሮ· 4፡14)። የቤተክርስቲያን ሊቃውንት አሞንዮስና አውሳብዮስም «ክርስቶስ የሥጋችንን መነሣት ያስረዳን ዘንድ ተነሣ» ብለዋል (መቅድመ ወንጌል)

ትንሣኤ ለሰው ዘር ሁሉ ነው ፤ ጻድቃንም ኃጥአንም ይነሣሉ ። የመጨረሻው የሙታን ትንሣኤ የሚሆነውም ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዓለምን ለማሳለፍ በሚመጣበት ጊዜ ነው ።

በዘመኑ መጨረሻ ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በሙታንና በሕያዋን ይፈርድ ዘንድ በክብሩና በጌትነቱ ይመጣል ። (መዝ· 49፡2/ማቴ· 25፡31–32። ራእ 1፡7)። አስቀድሞም መላእክትን ይልካቸዋል። እነርሱም የመለከት ድምፅ ያሰማሉ ፤ ሙታንም ይነሣሉ ፤ ምድርም አደራዋን ታስረክባለች ።

ከዚህ በኋላ ጻድቃንን በቀኙ ፤ ኃጥአንን በግራው ያቆማቸዋል ፤ ያን ጊዜ ጻድቃን በበጎ ምግባራቸው ይመሰገናሉ ፤ ኃጥአንም በክፉ ምግባራቸው ይወቀሳሉ ። ጻድቃን ከፀሐይ ሰባት እጅ አብርተው ፤ አምላካቸው ክርስቶስን መስለው መንግሥቱን ይወርሳሉ ። ኃጥአን ግን ጠቁረው ፤ ጨለማ ለብሰው ለሰይጣንና ለሠራዊቱ ወደ ተዘጋጀው ወደ ዘለዓለም ኵነኔ ይሄዳሉ። (ማቴ·13፡42–49። ማቴ 25፡31–43። 2 ቆሮ· 5፡10። ራእ· 20፡12)።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ትምህርተ ሃይማኖትን ለምእመናን የምታስተምረው ከዚህ በላይ በአምስት ተከፍለው በተገለጡት አዕማደ ምሥጢር መሠረትነት ነው ።

# ምዕራፍ ፬

# ሰባቱ ምሥጢራት ቤተክርስቲያን

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በሰባት ዐበይት ምሥጢራት ምእመናንን ታገለግላለች ምሥጢራት የተባሉበትም ምክንያት በዓይናችን ልናያቸው በእጃችን ልንዳስሳቸው የማንችል ልዩ ልዩ የመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች በእነዚሁ ምሥጢራት አማካይነት የሚሰጡን ስለሆነ ነው ።

## ሰባቱ ምሥጢራት

1ኛ· ጥምቀት
2ኛ· ቅብዓተ ሜሮን
3ኛ· ቁርባን
4ኛ· ክህነት
5ኛ· ተክሊል
6ኛ· ንስሐ
7ኛ· ቀንዲል ናቸው ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን በአዕማድ ምሳሌነት በምሳሌ ሰሎሞን የተነገረውን መነሻ በማድረግ ምሥጢራት ሰባት መሆናቸውን ትቀበላለች ፤ ምሳሌ ሰሎሞን· 9፡1 ፤ እነዚህ ሰባት ምሥጢራት በሚታየውና በሚዳሰሰው በግዙፉ አካል አማካይነት ረቂቁን የማይታየውንና የማይዳሰሰውን የእግዚአብሔርን ጸጋ ለምእመናን የምታሳትፍባቸው ናቸው ። ከእነዚህ ሰባተ ምሥጢራት ስድስቱ በጳጳስም ፤ በቄስም ይፈጸማሉ ፤ የክህነትን ሥልጣን መስጠት ግን የሚፈጸመው በጳጳስ ብቻ ነው ።

## 1· ጥምቀት

ጥምቀት፤ ከሰባቱ ምሥጢራት የመጀመሪያው ጥምቀት ነው፤ ጥምቀት ዳግመኛ ተወልደን ወደ እግዚአብሔር መንግሥት የምንገባበት ምሥጢር ነው ። ዮሐ፡3፡5፡ ጥምቀት መጽሐፍ ቅዱሳዊ ትእዛዝ አለው ። (ማቴ 28፡19–20) ።

በጥምቀት ኃጢአት ይሠረያል የሐዋ·ሥራ 2፡8 ። መንጻትና መቀደስም በጥምቀት ነው ። (1ኛ·ጴጥ· 3፡21፤ ቲቶ 3፡5–6) ።

